

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

## የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

| ጦሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ |
|---|---|---|---|---|


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር


# የሁለቱ ዒዶች ሶላት

18

# የሁለቱ ዒዶች ሶላት



## ማውጫ

የዒድ ገጽታዎች
የሁለቱ ዒዶች ሶላት ብያኔ
የሁለቱ ዒዶች ሶላት ወቅት
የሁለቱ ዒዶች ሶላት አሰጋገድ
የሁለቱ ዒዶች ሶላት መስገጃ ቦታ
በሁለቱ ዒዶች ሶላት የሚወደዱ ነገሮች
ሁለቱን ዒዶች ከሚመለከቱ ድንጋጌዎች በከፊል
መመሪያዎች

## የዒድ ገጽታዎች

የሙስሊሞች በዓላት ሁለት ናቸው። እነሱም ዒድ አልፍጥርና ዒድ አልአድሓ ናቸው። ዒድ አልፍጥር ከረመዷን ወር ጾም በኋላ ሲሆን ዒድ አልአድሓ ደግሞ ከዐረፋ ቀን በኋላ ነው። የጃህሊይያን በዓላትና ማናቸውንም የብድዓ በዓላት አላህ ﷻ በነዚህ ሁለት በዓላት ተክቶልናል። ከአነስ ብን ማሊክ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት በዘመነ ጃህሊይያ የሚጫወቱባቸው ሁለት ዓመታዊ በዓላት ነበሯቸውና ነቢዩ ﷺ ወደ መዲና ሲመጡ :- ‹‹የምትጫወቱባቸው ሁለት ቀናት ነበሯችሁ፤አላህ ከነሱ በላጭ በሆኑ ሁለት ቀናት በአልፍጥር ቀንና በአልአድሓ ቀን ተክቶላችኋል።››(1) አሉ ብለዋል። በዓላት የማንኛውም ሃይማኖት ዋነኛ መገለጫ፣ህግጋትና መርሆ በመሆናቸው፣በካፍሮች ዒድ ላይ መሳተፍና በዓላቸውን ማክበር አይፈቀድም። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል፦

﴿وَلَا تَتَّبِعْ أَهْوَآءَهُمْ عَمَّا جَآءَكَ مِنَ ٱلْحَقِّ ۚ لِكُلٍّ جَعَلْنَا مِنكُمْ شِرْعَةً وَمِنْهَاجًا ۚ﴾ [المائدة:48]

‹‹እውነቱ ከመጣልህ በኋላ ዝንባሌዎቻቸውን አትከተል። ከናንተ ለሁሉም ሕግንና መንገድን አደረግን፤››[አል-ማኢዳህ:48] አላህ ﷻ በዒድ ቀን የዒድ ሶላት የሚባል ሶላት ደንግጓል፤ሶላቱ ከዒዱ አበይተ መገለጫዎች አንዱ ነው።

## የሁለቱን ዒዶች ሶላት የሚመለከት ብያኔ

ፋርድ አልክፋያ ማለትም የወል ግዴታ ነው። ለሶላቱ በቂ የሆነ ሰው ከተገኘ ኃላፊነቱ ከተቀሩት ላይ ይነሳል። ነገሩ በጣም የጠበቀ ከመሆኑ የተነሳ ነቢዩ ﷺ እንዲሰገድ ማዘዝ ብቻ ሳይሆን ትላልቅ ሴቶችና ኮረዶችም ጭምር የማይሰግዱ የወር አበባ ያለባቸውም ሳይቀሩ ወደ መስገጃው ቦታ እንዲያመሩ አዘዋል። ይህም ሶላቱ ያለውን ትሩፋትና እጅግ አስፈላጊ መሆኑን ያረጋግጣል። ግዴታ ስለመሆኑ ማስረጃው :-

﴿فَصَلِّ لِرَبِّكَ وَٱنْحَرْ ۝٢﴾ [الكوثر:2]

1. ‹‹ስለዚህ ለጌታህ ስገድ (በስሙ) ሠዋም።›› [አል-ከውሠር:2] የሚለው የአላህ ﷻ ቃል ነው።

2. ነቢዩ ﷺ ሶላቱ እንዲሰገድ ሴቶችን ጭምር አዘዋል። ኡምሙ ዐጥይየህ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት :- ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ በአልፍጥርና በአልአድሓ (ዒድ ሶላት)፣ለጋብቻ የደረሱና ከቤት የማይወጡ ኮረዶች፣የወር አበባ ያለባቸውንና ልጃገረዶችንም ወደ ዒድ መስገጃው ለመሄድ እንድናስወጣቸው አዘውናል። የወር አበባ ያለባቸው ከሶላቱ ገለል ብለው በመልካሙ ትእይንትና በሙስሊሞች ዱዓእ ላይ ይሳተፋሉ፣(አሉና) የአላህ መልእክተኛ ሆይ! አንዳችን የምትሸፋፈንበት ጅልባብ አይኖራትም ስላቸው እህቷ ከራሷ ጅልባብ ታልብሳት።››(2) አሉኝ ብለዋል።

(1) በነሳኢ የተዘገበ

(2) በቡኻሪ የተዘገበ



## የሁለቱ ዒዶች ሶላት ወቅት

የዒድ ሶላት ወቅት ፀሐይ ወጥታ በዓይን ግምት የጦር ዘንግ ያህል ከፍ ካለችበት - የሃያ ደቂቃ ያህል ቆይታ - ጊዜ ጀምሮ ፀሐይ ከአናት አለፍ እስከምትልበት ድረስ ያለው ጊዜ ነው፡፡

ሱንናው የዒድ አልአድሓን ሶላት ለኡድህይ'ያ በቂ ጊዜ ለማግኘት ሲባል ማስቀደምና ዘካቱል ፍጥርን ለመክፈል በቂ ጊዜ እንዲኖር የዒድ አልፍጥርን ሶላት ማዘግየት ነው፡፡

## የሁለቱ ዒዶች ሶላት አሰጋገድ

የሁለቱ ዒዶች ሶላት ያለ አዘንና እቃማ ድምጽ ከፍ ተደርጎ የሚቀራበት ሁለት ረክዓ ሶላት ነው፡፡ የአሰጋገዱ ዝርዝር እንደሚከተለው ነው ፡-

1. በመጀመሪያው ረክዓ ከእሕራም ተክቢራና ከእስትፍታሕ ዱዓእ በኋላ ከቀራኣ በፊት ሰባት ጊዜ ተክቢራ (አልሏሁ አክበር) ይላል፡፡
2. ተዐው'ዉዝና በስመላ ካለ በኋላ ወደ ቅራኣ በመግባት ፋቲሓና አንድ ሱራ ይቀራል፡፡ ከፋቲሓ በኋላ በሁለቱ ረክዓዎች በመጀመሪያው ሱረቱል አዕላ፣በሁለተኛው ሱረቱል ጋሺያ ይቀራል፡ ፡ ወይም በመጀመሪያ ሱረቱ ቃፍ፣በሁለተኛው ደግሞ ሱረት አልቀመርን ያነባል፡፡
3. በሁለተኛው ረክዓ ከመሸጋገሪያው ተክቢራ በኋላ አምስት ጊዜ ተክቢራ ያድርጋል፡፡ ትክክለኛው ከእያንዳንዱ ተክቢራ ጋር እጆችን ከፍ አለማድረግ ነው፡፡
4. በተክቢራዎቹ ጣልቃ አላህን ያመሰግናል፣ያወድሳል፣በነቢዩ ﷺ ላይ ሶላት ያወርዳል፡፡
5. ሶላቱን በሰላምታ ካበቃ በኋላ ወደ ምንበሩ በመውጣት ሁለት ኹጥባዎችን ያድርጋል፤በኹጥባዎቹ መካከልም ለአፍታ ይቀመጣል፡፡
6. በሁለቱ የኹጥባው ክፍሎች በዒድ አልፍጥር ኢማሙ ከሁኔታው ጋር አግባብነት ያለውን ጉዳይ ያነሳል፡፡ በአልአድሓ ዒድ ኡድሕይ'ያን የሚመለከቱ ድንጋጌዎችንና አግባብነት ያላቸው ሌሎች ጉዳዮችን ያነሳል፡፡

## የሁለቱ ዒዶች ሶላት መስገጃ ቦታ

ሱንናው የሁለቱን ዒዶች ሶላት በመስጊድ ሳይሆን በገላጣ መስገጃ ቦታ (ሙሰል'ላ) መስገድ ሲሆን፣አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘ ግን በመስጊድ ቢሰገድ ችግር የለውም፡፡

## በሁለቱ ዒዶች ሶላት የሚወደዱ ነገሮች

1. ለወንድ ከአልባሳቱ ምርጡን በመልበስ አጊጦ መሄድ፤ለሴቶች ግን ያለ ጌጣጌጥና ሽቶ መሄድ፡፡
2. ሰጋጅ ወደ ቦታው አማልዶ በመሄድ የመጀመሪያው ሶፍ ላይ መገኘት፡፡
3. ሲሄዱ በአንድ ሲመለሱ ደግሞ በሌላ መንገድ መመለስ፡፡ ከተቻለ በእግር መጓዙ ይመረጣል፡፡ ከጃቢር (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹ነቢዩ ﷺ የዒድ ቀን ሲሆን በሌላ መንገድ ይሄዱ ነበር፡፡ ››(1) ብለዋል፡፡
4. በዒድ አልፍጥር ሶላት ከመሄድ በፊት ቁጥራቸው ኢተጋማሽ (ውትር) የሆነ (ሦስት ወይም አምስት) የተምር ፍሬዎችን መብላት፤በአልአድሓ ከሶላት እስኪመለሱ ምንም አለመቅመስ፡፡
5. የዒድ አልፍጥርን ሶላት የዘካት አልፍጥርን ክፍያ ለመፈጸም ጊዜ ለማግኘት ማዘግየት፣የአልአድሓ ዒድ ሶላትን ደግሞ አማልዶ መስገድ፡፡

## ሁለቱን ዒዶች ከሚመለከቱ ድንጋጌዎች በከፊል

1. ከዒድ ሶላት በፊትና በኋላ በመስገጃ ቦታው ሱንና መስገድ የተጠላ (መክሩህ) ነው፡፡ በመስጊድ የሚሰገድ ከሆነ ግን ተሕይ'የቱል መስጅድ ይሰገዳል፡፡
2. የዒድ ሶላት ሙሉ በሙሉ ወይም በከፊል ያመለጠው ሰው በአሰጋገዱ መሰረት ሰግዶ መተካት ሱንና ነው፡፡ ሁለቱን ረክዓዎች ተክቢራዎቻቸውን አሟልቶ የጎደለውን ተክቶ መፈጸም ይገባል፡፡
3. የዒድ ተክቢር አባባሉ የሚከተለው ነው፡ - ‹‹አል'ኋሁ አክበር፣አል'ኋሁ አክበር፣ላእላሀ እል'ለል'ኋሁ፣ወል'ኋሁ አክበር፣አል'ኋሁ አክበሩ ወሊል'ላህል ሐምድ›› በተጨማሪም ‹‹አል'ኋሁ አክበር፣አል'ኋሁ አክበር፣አል'ኋሁ አክበሩ ከቢራ›› ማለትም ይቻላል፡፡
4. ለወንዶች በተክቢር ድምጽን ከፍ ማድረግ ሱንና ሲሆን፣ሴት ድምጽ ዝቅ እንድታደርግ የታዘዘ ከመሆኑ አንጻር ሴቶች በተክቢር ድምጻቸውን ከፍ አያደርጉም፡፡
5. በዒድ አልፍጥር ተክቢር የሚደረገው ከዒዱ ቀን ጎሕ መቅደድ ጀምሮ ኢማሙ ለሶላት እስከሚነሳበት ጊዜ ነው፡፡ በዒድ አልአድሓ ከዐረፋ ቀን የሱብሕ ሶላት ጀምሮ እስከ አይ'ያሙ አት'ተሽሪቅ (ከዒዱ በኋላ ያሉት ሦስት ቀናት) የመጨረሻው ቀን ጸሐይ መጥለቅ ድረስ ነው፡ ፡ ወደ መስገጃው ሲኬድ መንገድ ላይ፣እስኪሰገድ በተቀመጡበት ቦታ፣በጀማዓ ከሚሰገዱ የግዴታ ሶላቶች በኋላ፣በገበያ ቦታና በቤቶች . . ይደረጋል፡፡

## መመሪያዎች

1. ሙስሊሞች እርስ በርሳቸው ‹‹ተቀበለል'ኋሁ ምን'ና ወምንኩም›› (ከኛና ከናንተም አላህ ይቀበለን) ›› በማለት እንኳን አደረሳችሁ መባባል የተወደደ ነው፡፡
2. ሙስሊሞች በዒድ ቀን መደሰትና ደስታን መግለጽ፣ ዘመዶቻቸውንና ወዳጆቻቸውን እንኳን አደረሳችሁ ማለት የተወደደ ነው፡፡
3. ዒድ የተቋረጠ ዝምድናን ለመቀጠልና የተቀያየሙትን ለማስታረቅ ልጠቀሙበት የሚገባ መልካም አጋጣሚ ነው፡፡
4. በዒድ ዕለት መቃብሮችን መጎብኘት ያልተደነገገ መሆኑ ብቻ ሳይሆን የዒድን ደስታና የመዝናኛ መንፈሱን የሚጻረር ነው፡፡
5. በሁለቱ ዒዶች ቤተሰብና ልጆችን አላህ ሐላል ባደረጋቸው ነገሮች በአልባሳት፣በምግብና በመዝናኛዎች ማስደሰት የተደነገገ ነው፡፡ ሁለቱ ዒዶች የደስታ የፍስሐና የመዝናኛ ቀናት ናቸውና፡ ፡ አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል፡-

﴿ قُلۡ بِفَضۡلِ ٱللَّهِ وَبِرَحۡمَتِهِۦ فَبِذَٰلِكَ فَلۡيَفۡرَحُواْ هُوَ خَيۡرٞ مِّمَّا يَجۡمَعُونَ  ﴾

[يونس:58]

(1) በቡኻሪ የተዘገበ



‹‹፦ በአላህ ችሮታና በእዝነቱ (ይደሰቱ) በዚህም ምክንያት ይደሰቱ፤ እርሱ ከሚሰበስቡት ሀብት በላጭ ነው፤ በላቸው፡፡›› [ዩኑስ፡58]

6. የሙስሊሞች የደስታና የመዝናኛ በዓላትና ድግስ ከእስላም ትምህርቶች፣ከስነ ምግባር ሕጎቹና ከአዳቡ ጋር የሚጻረሩ እንደ የተቃራኒ ጾታዎች መደበላለቅ (እኽቲላጥ)፣የሶላት ወቅቶችን ማሳለፍ፣ሐራም የሆኑ ጨዋታ መጫወት፣ዘፈን ማየትና ማዳመጥ ወዘተ. ያሉ ነገሮችን እንዲያካትት አይፈቀድም፡፡